# በሴቶች ላይ የሚደረጉ ማንኛውንም ዓይነት ተፅዕናዎችን ለማስወገድ የተፈረመ የተባበሩት መንግሥታት ውል

# The UN Convention On The Elimination Of All Forms of Discrimination Against Women

ይህ ቡክሌት በጠቅላይ ሚኒስትር ፅ/ቤት የሴቶች ጉዳይ ዘርፍ ከጤና ጥበቃ (SIDA) ጋር በመተባበር ተዘጋጀ

ህዳር 1987

# The U.N. Convention on the elimination of all forms of discrimination against women

**Issued by :- The Ministry of Women in Development Culture and Youth. Republic of Uganda**

ትርጉም በወ/ሮ ኢሌኒ ሰንበታ

የሚከተሉት ቃላት ትርጉም ምንድነው?

| | |
|---|---|
| (affirmative action)<br>ተራማጅ ተግባር | በማወቅ የተደረገ፣ እንዲሁም በጥናት አንድን የማኅበረሰብ አካል፣ ወይንም ግለሰብ መጥቀም፣ ልዩ ጥቅም ለማኅበረሰቡ አባል ወይንም ለአጠቃላይ ማኅበረሰቡ በጥናት ላይ የተመሠረተ እና በማወቅ የተደረገ መጥቀም |
| apropitiate technology<br>ብቁ ቴክኖሎጂ<br>/መሣሪያ/<br>//የሣይንስ ውጤት | ተስማሚ እና መሣሪያው የአንድን አካባቢ ሁኔታ የዕድገት ደረጃ በመከተል የተፈለሰፈ ብቁ ቴክኖሎጂ ወይንም ለአካባቢው ተስማማ የሆነ በኅብረተሰቡ የኑሮ ደረጃ እንዲሁም በአካባቢው ሁኔታ ላይ በመመሥረት |
| bound<br>ግዴታ መግባት<br>/በግዴታ መያዝ/ | በሁኔታው ለመመራት በሁኔታው ለመታዘዝ መስማማት |

| | |
|---|---|
| bursary<br>ድጎማ | ጥናቶችን ለማካሄድ፣ ለማከናወን የሚሰጥ ገንዘብ |
| civil matters<br>የሲቪል ጉዳዮች<br>/የግለሰብ ጉዳዮች/ | በአንድ ማኅበረሰብ ውስጥ በግለሰብ እና በሰዎች እና በሰዎች መካከል የሚደረገውን ግንኙነትን የሚመለከት፣ |
| Convention<br>/የስምምነት ውል/ | በሀገሮች መካከል የሚፈረም እና የሚዳረስ የስምምነት ውል |
| Maternity<br>እናትነት | የልጆች መፀነስ፣ ፅንስ መሸከም እና ሕፃናት ልጆችን መንከባከብ፣ ማሳደግ ፣ |
| Mortgages | አንድን ንብረት /በማስያዝ/ በመስጠት ብድር መቀበል እና ብድሩ ሲመለስ፣ ሲከፈል፣ ንብረቱን ለማስመለስ መስማማት ፣ |
| Prejudice<br>ትክክል ያልሆነ<br>አመለካከት | ህቡዕ ተፅዕኖ ማዳበር ፣<br>ወልጋዳ አስተያየት |
| Procedures<br>ሥነ ሥርዓቶች | አንድን ነገር ለማስፈጸም ወይንም ለመከወን የሚወሰደው መንገድ ወይም ሁኔታ ቅደም ተከተልን የተከተለ ሂደት |
| Prostitution<br>የአካል ሽያጭ | የራስን አካል ለግብረ ሥጋ ግንኙነት ሲሉ በገንዘብ መለወጥ፣ ክብርን በሚነካ ተግባር ላይ መሠማራት፣ ስብዕናን የሚነካ ርካሽ ተግባር |

**Stereotyping** አንድ ግትር አቋም አስተያየት፣ ሥዕል፣ ስለሰዎች እና ስለሁኔታዎች ተደጋጋሚ የሆነ እይታ ሲኖረን፣ በአንድ ሚዛን ብቻ ወይንም በአንድ በተወሰነ መለኪያ መሥፈርት ማየት በሴቶች ላይ የሚፈጸሙ/ የሚደረጉ የአመለካከት ልዩነቶችን በመቃወም በሴቶች ላይ የሚደረጉ ማንኛውም ዓይነት አድልዎችን በመቃወም የወጣ የተባበሩት መንግሥታት ውል ፣

ይህ ውል በተባበሩት መንግሥታት አጠቃላይ ስብሰባ እንደ ኤውሮፓውያን አቆጣጠር በዲሴምበር 18/1979 የተቀበሉት ነው ፡፡

ከ1979 ወዲህ ባሉት ዓመታት ውስጥ ከመቶ /100/ በላይ የማ፤ሆኑ ሀገሮች አጽድቀውታል፡፡ ኡጋንዳም በ1985 እ.ኤ.አ አጽድቃዋለች ፡፡

ማፅደቅ ማለት፡-

* ኡጋንዳ የስምምነቱን ውል በመከተል፣ በመርሆው መስማማቷን፣ ልትመራበት መቀበሏን ያሣያል፡፡

* ኡጋንዳ በተግባር በሴቶች ላይ የሚደርሱትን የተለያዩ አስከፊ ተፅዕኖዎች ለማስወገድ፣ ለማስቀረት ትታገላለች፤

* ኡጋንዳ ተከታታይነት ያለው ሪፖርት በውሉ መሠረት ለተቋቋመው በሴቶች ላይ የሚደርሱ አስከፊ ተፅእኖዎችን ለሚቃወም ኮሚቴ ማቅረብ ይገባታል፡፡ /CEDAW/ ELIMINAION OF ALL FORMS Of DISCRIMINATION AGAINST WOMEN

* አንድ የዓለም አቀፍ ባሕሪይ ያለው ውል ስምምነት በሕግ አስገዳጅነት አለው፣ ወይንም ሕጋዊ ተፈፃሚነት አለው፡፡

አንድ አገር ማቀድ፣ መተለም፣ በግብ መልክ ማስቀመጥ የሚገባትን ዓለም አቀፍ መርሆ፣ ደረጃ /Standard/ ያስቀምጣል:: ሕጋዊ የሆነ ጽሑፍ ስለሆነ አንዳንድ አባባሎች ከበድ ሊሉ ይችላሉ::

ይህች ትንሿ መጽሔት የምታስረዳው በቀላል በሚገባ ቋንቋ ውሉ ምን እንደሚል፣ ለአንድ ሀገር ምን ማለት እንደሆነ እና በተለይ ለሴቶች ምን ማለት እንደሆነ ያስተምራል::

## መግቢያ፣

ብዛት ያላቸው የዓለም አቀፍ ውሎች ሴቶች እና ወንዶች እኩል መብት ሊኖራቸው እንደሚገባ ቢያሠፍሩም፣ አሁንም በሴቶች ላየ የሚደረጉ አስከፊ ተፅእኖዎች አሉ::

በሴቶች ላይ አስከፊ ተፅእኖ ማድረግ ወደ ሌሎች ብዛት ወዳላቸው ችግሮች ውስጥ ይከተናል::

በመጀመሪያ ሕዝቦች በአጠቃላይ እኩል ናቸው ከሚለው መርሆ ይቃረናል:: ለሰው ልጅ ስብአናና ክብር አይሰጥም::

ሴቶች በሀገራቸው የፖለቲካው፣ የማኀበራዊው፣ የልማቱ፣ የባሕሉ ኑሮ ውስጥ ተሣትፎአቸው ከወንዶች እኩል እንዳይሆን ያደርጋል::

ሴቶች በቤተሰባቸው፣ በማኅበረሰቦች፣ በሀገራቸው እና ለሰው ልጆች አጠቃላይ ጥቅም ከሙሉ ችሎታቸው እና ጉልበታቸው ግልጋሎት እንዳይሰጡ ያግዳል::





ይህ ማለት ድህነት ባለበት ቦታ ሴቶች ለምግብ፣ ለጤና፣ ለትምህርት፣ ለሥልጠና፣ ለቅጥር ሥራዎች ዕድሉ አይሰጣቸውም ማለት ነው::

ሀገሮች የሴቶች እና የወንዶችን እኩልነት ለማሣደግ ሊያደርጉት የሚችሉት ብዙ እርምጃዎች አሉ::

<u>ለምሣሌ</u>፣ የሥርዓተ ልማቱ በእኩልነት እና በፍትሕ ላይ እንዲመሠረት ማድረግ::

በጾታ፣ በሃይማኖት፣ በጐሣ፣ በዘር ላይ የተመሠረቱ ተፅእኖዎችን/ አድልኦዎችን ማስወገድ::

የእርስ በእርስ ጦርነትን ማስወገድ፣ እንዲሁም ዓለም አቀፍ ጠብ አጫሪነትን ማስወገድ::

ብሔራዊ እና ዓለም አቀፋዊ ሠላም እና ደህንነት ማኅበራዊ ዕድገትን እና ለውጥን ለሴቶችም ለወንዶችም ያሳድጋል::

ማንኛውም ሀገር መንግሥትን ለመመሥረት ሴቶች እና ወንዶች በእኩልነት በኑሮ ሁሉ ዘርፍ መሣተፍ ይኖርባቸዋል::

በወንዶች እና በሴቶች መካከል የእኩልነት መኖርም አስፈላጊ ነው፣ ለቤተሰብ፣ ለማኅበረሰብ፣ ለሀገር ለዓለም እንዲም ለሰላም::

ሴቶች ለቤተሰብ ደህንነት ከፍተኛ አስተዋፅኦ ያደርጋሉ፤ እንዲሁም ለማኅበረሰብ ዕድገት፣ ሆኖም ይህ ግንዛቤ አላገኘም::

የሴቶች የእናትነት ሚና እጅግ ከባድ ኃላፊነት ነው:: ግን ይህ ደግሞ ሴቶችን አሣንሶ ለማየት ምክንያት መሆን የለበትም፤ ወይንም ሴቶች ላይ ተፅእኖ ለማሣደር ምክንያት መሆን የለበትም::

ሴቶችም ወንዶችም የልጆች የማሣደግ ኃላፊነትም ከመላው ማኅበረሰብ ጋር መጋራት መካፈል ይኖርባቸዋል::

በባህላዊው የሴቶች እና የወንዶች ሚና በቤተሰብ፣ በማኅበረሰብ የሚመደበው አመለካከት ላይ ለውጥ ሲደረግ ይገባል ሴቶች እና ወንዶች ሙሉ እኩልነት ከመጐናፀፋቸው በፊት፤

ከዚህም በላይ በተዘረዘሩት ምክንያቶች ሀገሮች የስምምነቱ ውል ተፈራራሚ እንዲሁም ደግሞ በውሉ መሠረት በሴቶች ላይ ያለውን ተፅእኖ ለማስወገድ እርምጃዎችን መውሰድ ይገባቸዋል::

## ክፍል አንድ ፣

### አንቀጽ አንድ :- ተፅእኖ

« በሴቶች ላይ የሚደረግ አድሎአዊ ተፅእኖ» ማለት ወንዶች እና ሴቶችን በተለያየ መንገድ ማየት፣ ይህ እይታ ይህ አያያዝ በልዩነት ሴቶችን ያገቡም ይሁን ያላገቡትን ሰብዓዊ መብቶቻቸውን እና መሠረታዊ ነፃነቶቻቸውን በእኩልነት ላይ ከወንዶች ጋር በመመሥረት እንዳያረጋግጡ ያግዳቸዋል::

## ክፍል ሁለት ፣

### የፖሊሲ እርምጃዎች፣

ውሉን በመፈረም ሀገሮች በሴቶች ላይ ተፅእኖ ማሣደር ልክ አለመሆኑን ተቀብለው በሴቶች ላየ የሚደረጉትን ተፅእኖዎች ፋታ ሣይሰጡ ለማስወገድ እርምጃዎችን ይወስዳሉ::

* ሀገሮች በሕገ መንግሥታቸው ውስጥ የሴቶችን እና የወንዶችን እኩልነት የሚያንፀባርቅ እንዲሆን ይስማማሉ፣ እንዲሁም ይህ የሚወጣው ሕግ የሀገሪቱ መርሆ እንዲሆን እና በቀን ተቀን ኑሮ ውስጥ ገሃድ እንዲሆን ይደረጋል::

* ሀገሮች ማንኛውም ዓይነት በሴቶች ላይ የሚደረጉ ተፅእኖዎችን በመቃወም አስፈላጊውን እርምጃዎች ይወስዳሉ::

  አስፈላጊ ሆኖ ከተገኘም መንግሥት ቅጣትንም እንኳ ሲሆን በመጨመር ሴቶች ላይ ተፅእኖ የሚያሣድሩትን ይቃወማል::

* የሀገሮቹ ሕጐች የሴቶችን መብት ከወንዶች መብት ጋር እኩል በሆነ መንገድ ይጠብቀሉ/ያከብራሉ መንግሥት ሴቶች ተፅእኖ በሚደርስባቸው ወቅት ሊከሱበት የሚችሉበትን ፍርድ ቤት እና ለሄዱበት የሚችሉትን ሕዝባዊ ተቋማት ሕልውና ያረጋግጣል::

* የሀገሪቱ መንግሥታት በሴቶች ላይ ተፅእኖ ማሣደር አይገባውም እንዲሁም ደግሞ ማንም ሕዝባዊ ባለሥልጣን ወይም ተቋም በሴቶች ላየ ተፅእኖ አለማድረሱን/ የማያደርስ መሆኑን ማረጋገጥ ይገባዋል::

* የሀገሪቱ መንግሥታት እያንዳንዱ ሕግ፣ መመሪያ፣ ደንብ፣ ባሕል፣ ልማዶች በሴቶች ላይ ተፅእኖ የሚያደርሱ ከሆነ መለወጣቸውን ወይንም መወገዳቸውን ማረጋገጥ አለበት::

* የሀገሪቱ መንግሥት እሥር ቤቶችን በተመለከተ የሚወጡትን ጨቋኝ መመሪያዎች ደንቦች፣ እንዲሁም የወንጀሎችን ቅጣት አስመልክቶም መለወጥ አለበት::

ይህ pdf የቀረበልዎት በ
www.binyamhk.wordpress.com
ነዉ።





## አንቀጽ 3፣

## የመሠረታዊ ሰብዓዊ መብቶች ጥበቃ ዋስትና ማግኘት እና መሠረታዊ ነፃነቶች ፤

ሀገሮች ሴቶች በማንኛውም መስክ በተለየም በፖለቲካው፣ በማኀበራዊው፣ ከልማቱ በባሕሉ፣ መስክ እንዲገፉበት፣ እንዲያድጉ ማረጋገጥ አለበት:: አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝም መንግሥት ሕጐችን በማውጣት ሴቶች ሰብዓዊ መብቶቻቸውን እና መሠረታዊ ነፃነቶቻቸው፣ ከወንዶች ጋር በእኩልነት እንዲጠቀሙ ማረጋገጥ ይገባዋል ::

## አንቀጽ 4፣

## ልዩ እርምጃዎች ፤

1. ሴቶችን ከወንዶች እኩል ለማምጣት የተለየ እርምጃ መውሰድ ከተፅዕኖ ሊቆጠር አይገባውም፣ ምንም እንኳን ሴቶችን ከወንዶች ለይቶ በማየት የሚወሰድ የተለየ እርምጃ ቢሆንም እንኳን ሆኖም ግን የተለየ እርምጃዎችን መውሰድ ጊዜያዊ ፖሊሲ ሲሆን ልክ የእኩል ዕድል፣ እኩል እይታን በወንዶች እና በሴቶች በኩል ፤

2. ለሴቶች በእናትነታቸው ወቅት ጥበቃ ማድረግ ተፅዕኖ አይደለም ::

* ሴቶች ወንዶችም ለጤንነታቸው እና በሥራ ገበታቸው ላይ ለደህንነታቸው ጥበቃ የማግኘት እኩል መብት አላቸው፣ ይህ የደህንነት እና የጤንነት ጥበቃ እና እንክብካቤ የሴቶችን የመውለድ ችሎታን መጠበቅንም ጭምር ያካተታል::

ለምሣሌ ለሕፃናት እንክብካቤ መስጫ ቦታዎችን በማዘጋጀት::

2. ቀጣሪዎች ሴቶች ጋብቻ ስለፈፀሙ እና በወሊድ ወራቶቻቸው ምክንያት ተፅእኖ እንዲያደርጉባቸው አይገባም::

* ቀጣሪዎች ሴቶችን በእርግዝና ወቅታቸው እና በወሊድ ፈቃዳቸው ወቅት ከሥራ ሊያስወግዷቸው አይገባም::

እንዲሁም ደግሞ ያገባች እና ያላገባች በማለት ተፅእኖ ማድረግ የተከለከለ ነው::

* የወሊድ ፈቃድ ከክፍያ ጋር፣ ወይንም ከማኅበራዊ ጥቆማ ጥቅሞች ጋር ሊለመድ ይገባዋል::

የወሊድ ፈቃድ የምትወስድ ሴት ሥራዋን ማጣት የለባትም፣ በወሊድ ምክንያት ሲኒየርቲዋን እና አበሎችን ማጣት የለባትም::

* ወላጆች በሕዝባዊ ኑሮ ውስጥ መሳተፍ እንዲችሉ ማኅበራዊ አገልግሎትየሚሰጡ ተቋሞች መበረታታት አለባቸው:: ለምሳሌ ለሕፃናት እንክብካቤ መስጫ ጣቢያዎች ሊስፋፉ እና ሊያድጉ ይገባል ::

* ነፍሰጡር ለጤንነታቸው ጉጂ ለመሆናቸው በተረጋገጡ ሥራዎች እንዳይካፈሉ ልዩ ጥበቃ ይደረግላቸዋል ::

3. ሴቶች እና ወንዶችን ከጉጂ የቅጥር ሥራዎች ለመጠበቅ የሚወጡት ሕጐች ከጊዜ ወደ ጊዜ እየታዩ መሻሻል

ይገባቸዋል፡፡ ይህ ክለሳ የሚረዳው እነዚህ ለጥበቃ ተብለው የሚደነገጉ ሕጐች ሴቶች እና ወንዶች በቅጥር ዕድሎች በእኩልነት ለመወዳደር እንዳያግዳቸው ነው ፡፡

## አንቀጽ 12 ፣ ጤና፣

1. ተፈራራሚው ሀገር ሴቶች በጤና አገልግሎት ማግኘት ላይ ተፅዕኖ እንዳይደረግባቸው የሚቻለውን ሁሉ ለማድረግ ግዴታ ይገባል፡፡ ሴቶችም ወንዶችም ለጤና እንክብካቤ እና ለቤተሰብ ምጣኔ አገልግሎት እኩል ዕድል ማግኘት አለባቸው፡፡

2. ሴቶች በእርግዝናቸው ወቅት ልጅ ሲወልዱ እና ልጁ ከተወለደ በኋላ አስፈላጊ እና በቂ የሆነ የጤና እንክብካቤ አገልግሎት ሊያገኙ ይገባል፣ መንግሥት እነዚህን ግልጋሎቶች በነፃ ሊሰጥ ይገባል፣ አስፈላጊ በሆነበት ጊዜ ሁሉ ከዚህ በተጨማሪ ሴቶች የተሟላ አመጋገብ በእርግዝና እና በጡት ማጥቢያቸው ወቅት ሊያገኙ ይገባል ፡፡

## አንቀጽ 13፣ ኢኮኖሚያዊ እና ማኀበራዊ ጥቅሞች፣

ተፈራራሚ ሀገሮች የተስማሙበት ሌላው ነጥብ ሴቶች በተቀሩት ሌሎች ማኀበራዊ እና የልማት ዘርፎች ውስጥ አንዳችም ተፅዕኖ እንዳይደረግባቸው ነው፡፡ ሴቶችም ወንዶችም በሚከተሉት ነጥቦች ላይ እኩል መብት አላቸው ፡፡

- የቤተሰብ ጥቅማ ጥቅሞች
- የባንክ የብድር አገልግሎት፣ ወለድ አግድ እና ሌሎች የብድር አይነቶች ፣

- የዕረፍት መዝናኛ ተግባሮች፣ ስፖርት እና ሌሎች የተለያዩ ባሕላዊ ኑሮ ::

## አንቀጽ 14 ፣ የገጠር ሴቶች

1. ተፈራራሚ ሀገሮች ለገጠር ሴቶች የኑሮ ችግር የተለየ አትኩሮት ሊሰጡ ተስማምተዋል:: የቤተሰባቸውን ሕይወት በመጠበቅ አንፃር የሚያበረክቱት ትልቅ የልማት እንቅስቃሴ እና ያለ አንዳች ክፍያ የሚሠሩት ሥራ ሁሉ ልዩ ትኩረት ይሠጠዋል ::

2. በገጠሩ አካባቢ በሴቶች ላይ የሚደረጉትን ተፅዕኖዎች ሁሉ ለማጥፋት እርምጃዎችን ለመውሰድ ተፈራራሚ ሀገሮች ተስማምተዋል:: በገጠሩ ዕድገት በሚገኙት ጥቅማ ጥቅሞች ሁሉ ሴቶችም ወነዶችም እኩል ተካፋይነታቸውን ለማረጋገጥ ተፈራራሚ ሀገሮች ተስማምተዋ ::

- የገጠር ሴቶች የዕድገት አቅጣዎችን እና ዕቅዶችን በማውጣት እና በመተግበር እኩል መብት ሊኖራቸው ይገባል:: እንዲሁም ደግሞ በማኅበረሰቡ እንቅስቃሴ ውስጥ የመሳተፍም መብት አላቸው ::

- የገጠር ሴቶች በቂ የጤና እንክብካቤ አገልግሎት ዕድል ሊሰጣቸው ይገባል፣ የቤተሰብ ምጣኔንም በተመለከተ እና የማኅበራዊ ደህንነት ተጠቃሚም መሆን ይገባቸዋል ::

- የገጠር ሴቶች ለማንኛውም አይነት የሥልጠና እና የትምህርት እንዲሁም የመሠረተ ትምህርት ፕሮግራም ለመሳተፍ መብት አላቸው ::

- የገጠር ሴቶች ራሳቸውን በማደራጀት የራስን በራስ መረዳጃ ማኅበር መፍጠር እና ለራሳቸው ሥራዎችን በማኅበሮቹ አማካኝነት ማግኘት ይችላሉ፡፡

- የገጠር ሴቶች ለግብርና በሚውሉ የብድር አገልግሎቶች፣ ክፍት የገበያ ቦታዎች እና ተስማሚ ቴክኖሎጂ ተጠቃሚ መሆን አለባቸው፡፡ ሴቶች እና ወንዶች በእኩልነት በመሬት እና በግብርና መሻሻያ ፖሊሲዎች እና የሠፈራ ትልሞች እኩል መታየት አለባቸው፡፡

## ክፍል አራት፣

## አንቀጽ 15 ፧ ሕግ

1. ሴቶች በሕግ ፊት ከወንዶች እኩል ናቸው፡፡

2. በሲቪል ጉዳዩች ሴቶች ከወንዶች እኩል የሕግ ሥልጣን እንዲሁም ይህንን ሥልጣን የመጠቀም እኩል መብት አላቸው፡፡ በተለይም ሴቶች ውሎችን ለመፈረም ከወንዶች እኩል መብት አላቸው፡፡ ንብረቶችን አስተዳደር ረገድም ሴቶች ከወንዶች እኩል መብት አላቸው፡፡ በእያንዳንዱ የፍርድ ቤት ሥነ ሥርዓቶችም በእኩልነት ሊታዩ ይገባል፡፡

3. ማንኛውም የሴቶችን ሕጋዊ ሥልጣን ሊገድብ የሚሞክር ውል ወይምንም በግል የሚደረጉ ስምምነቶች ሕጋዊ ውጤት አይኖራቸውም፡፡

4. ሴቶችም ወንዶችም እኩል መብት አላቸው፡፡ የሰዎችን እንቅስቃሴ በተመለከተ እና የመኖሪያ ሥፍራቸውን የመምረጥ እኩል መብት አላቸው፡፡

# አንቀጽ 16 ፣ ጋብቻ እና የቤተሰብ ኑሮ

1. ተፈራራሚ ሀገሮች ጋብቻ እና የቤተሰብ ውስጥ ግንኙነቶች ውስጥ ያሉትን በሴቶች ላይ የሚደረጉትን ተጽእኖዎች ለማስወገድ እርምጃዎችን ይወስዳሉ::

- ማንኛውም ሰው ለጋብቻ መገደድ የለበትም፣ ሴትም ሆነ ወንድ ለጋብቻ የምትሆነውን፣ የሚሆነውን ሰው በነፃ እና በፍላጎቱ ለመምረጥ መብት አለው::

  ሴቶች እና ወንዶች በጋብቻ ወቅት እና በፍቺ ጊዜ እኩል መብት እና ኃላፊነቶች አሉአቸው::

- ሴቶች እና ወንዶች ነፃ በሆነ እና ኃላፊነት በተሞላው መንገድ የሚወልዷቸውን ልጆች ቁጥር እና የአራርቆ መውለድ መብት አላቸው:: ለቤተሰብ ምጣኔ ትምህርት እኩል ዕድል ሊኖራቸው ይገባል:: ስለወሊድ ቁጥጥር ትምህርትም እንዲሁ እኩል ዕድል ሊኖራቸው ይገባል::

- ሴቶች እና ወንዶች እኩል ሕጋዊ መብቶች እና ኃላፊነቶች ልጆችንና የጉዲፈቻ ልጆችን ጥበቃ በተመለከተ ኃላፊነት ሊኖራቸው ይገባል:: እነዚህ ሁሉ ግን ቅድሚያ የልጆች ምቾትን፣ ጥቅምን፣ የሚጠብቁ ሁኔታዎች ትኩረት ይሠጣቸዋል::

- ሴቶች እና ወንዶች እንደ ባልና ሚስት እኩል የሆነ የሰውነት መብት አላቸው:: ለምሳሌ ስም የመምረጥ፣ ሥራን የመምረጥ እኩል መብት አላቸው::

- ሴቶች እና ወንዶች እኩል የሆነ ንብረት የመያዝ፣ ባለቤት የመሆን፣ የመሸጥ፣ የማስተዳደር የመግዛት መብት አላቸው::

2. ሕጉ ዝቅተኛውን ጋብቻ የሚፈቅድበትን የዕድሜ ጣሪያ ሊያስቀምጥ ይገባል:: ይህ ሕግ ጋብቻዎች ሁሉ በክብር መዝገብ ሹም ፊት የተመዘገቡ መሆናቸውን ማስገደድ አለበት::

## የክፍል አምስት እና ስድስት ማሣጠሪያ

- ሀገሮች በተፈራረሙት በዚህ የስምምነት ውል መሠረት መፈጸም መፈጸማቸውን የሚከታተል፣ አንድ ዓለም አቀፍ በሴቶች ላይ የሚደረጉትን ተፅእኖ የሚቃወም ኮሚቴ ይቋቋማል::

- የዚሁ ኮሚቴ አባላት የሚመረጡት የስምምነት ውሉን በፈረሙት መንግሥታት ነው::

- ኢትዮጵያም እንደዚሁ እንደሌሎች አባል ሀገሮች ለተባበሩት መንግሥታት በየወቅቱ ሪፖርት ማዘጋጀት እና ማቅረብ አለባት:: ሪፖርቱ ውሉን ተግባራዊ በማድረግ ረገድ የተወሰዱትን እርምጃዎች የሚመዘገብ ሊሆን ይገባዋል::

- ዓለም አቀፍ ኮሚቴ በየዓመቱ ለሁለት ሳምንታት ከየሀገሩ የቀረቡትን ሪፖርቶች ለማጥናት ይሠበሰባል:: ከዚያም ለተባበሩት መንግሥታት ጠቅላላ ጉባዔ ሪፖርት ያቀርባል:: ይህ ለጠቅላላው ጉባዔ የሚቀርበው ሪፖርት ሀገሮች በሴቶች ላይ የሚያደረጉትን ተፅእኖዎች በማስወገድ ረገድ ያከናወኑትን የሚገልጽ ይሆናል::

- ውሉን በመፈረም ኢትዮጵያም በስምምነቱ ውል የተጠቀሱትን የሴቶች መብት ተግባራዊ ለማድረግ እና ለሴቶች ተጨባጭ እውነታ ለማድረግ አስፈላጊውን ሁሉ እርምጃ ለመውሰድ ተስማምታለች::

